Australian Bureau of Statistics

census 8 August 2006

# Fact Sheet

www.abs.gov.au/census

## ማክሰኞ፥ ነሐሴ ፪፥ (August 8 2006)፥ የሚከናወነው የህዝብ ቆጠራ ለኮምዩኒቲዎች ከፍ ያለ ጥቅም ያስገኛል።

የአወስትራሊያ ህዝብ መጠን፥ በ 2006 ዓመተ ምህረቱ የህዝብና ቤቶች ቆጠራ አማካኝነት ይታወቃል። ትብብርዎ፥ የእርስዎን ኮሚዩኒቲ የወደፊት ዕድል ሊወስን ይችላል።

የመንግሥትና የግል ድርጅቶች ከህዝብ ቆጠራ በተገኙ ውጤቶች መሠረት ለኮሚዩቲ አገልግሎት ተፈላጊ የሆኑትን እንደ መኖሪያ ቤቶች፥ ጤና ጥበቃ፥ ትምህርት፥ የቋንቋና ሌሎች ልዩ አገልግሎቶች ዕቅዶችን ይነድፋሉ።

## የሐገር፥ የቋንቋ፥ የልደት ዕለት፥ የሃይማኖትና ትውልድ፥ ወዘተ መጠይቆች

የ 2006 ዓ/ም ቆጠራ በአወስትራሊያ የሚኖሩትን ሰዎች ሁሉ የሚመለከት በጥድፊያ የሚደረግ መመዘኛ ሲሆን፥ እንደ ዕድሜ፥ የልደት ቦታ፥ መነጋገሪያ ቋንቋና ሃይማኖት፥ ትውልድና ዘር ያሉትን ሊያሳይ እንዲሁም እንግሊዝኛ ማስተማርና ድጋፍ መስጠት ማስፈለጉን ሊያስገነዝብ ይችላል።

የኮሚዩኒቲዎች ማሕበራት የዝርያቸውን ቆጠራ ውጤት በማረጋገጥ በቆጠራው ሠነድ የሰፈረውን የህዝብ ቁጥር ያፀድቃሉ። ከህዝብ ቆጠራ የተገኘ መረጃ ኮምዩኒቲዎችን በትክክል ይገልፃል። የቆጠራ ውጤት ተገቢውን የመንግሥት ዕርዳታ ለኮምዩኒቲዎች ማዳረስ ያስችላል።

## ከተሰጠው ዝርዝር ውስጥ ተስማሚውን መልስ ካላገኙ ተገቢውን መልስ ይጻፉት።

የህዝብ ቆጠራው በግምት 280 አገሮችን፥ 240 ቋንቋዎችንና 120 ሃይማኖቶችን የሚመለከቱ መረጃዎችን ይይዛል። የቆጠራው ቅፅ ይዞታ የተወሰነ በመሆኑ አገሮችን፥ቋንቋዎችንና ሃይማኖቶችን ሁሉ መያዝ አይችሉም። ስለዚህ፥ አገርዎን፥ ቋንቋዎን፥ ወይም ሃይማኖትዎን በዝርዝሩ ውስጥ ካላገኙት፥ እባክዎን ለዚሁ በተሰጠው ክፍት ቦታ ይጻፉት።

## የሰጠሁት መረጃ ይወጣብኛል ወይስ ይጠበቃል?

በሕጉ መሠረት፥ በቆጠራው ጊዜ የሰጡት መረጃዎ በምስጢር መያዝ የግል መብትዎ ነው።

በጊዜ ቀፎ ውስጥ ገብቶ፥ በአወስትራሊያ ብሔራዊ መዝገብ ቤት እንዲቀመጥ ካልተጠየቀ የማንም ስምና አድራሻ አይያዝም። የቆጠራው ውጤት ከታወቀ በኋላ፥ በወረቀት ወይም በኮምፕዩተር የተያዙ ስሞች፥ አድራሻዎችና መረጃዎች ሁሉ ይጠፋሉ።

የህዝብ ቆጠራ ሠራተኞች ሁሉ ግላዊ መረጃዎችን በምስጢር የመያዝ ሕጋዊ ግዳጅ አለባቸው። እንደ አወስትራሊያ ፖሊስ፥ አስዮ (ASIO)፥ የቀረጥ መምሪያ፥ ሰንተርሊንክ (Centrelink)፥ ኢሚግሬሽንና፥ የንግድ ድርጅቶች ያሉት ሁሉ በህዝብ ቆጠራው ወቅት እርስዎ የሰጧቸውን ግላዊ መረጃ በፍፁም ሊያገኙ አይችሉም።

## የህዝብ ቆጠራ "የጊዜ ቀፎ"

የቆጠራው ማስረጃ፥ ከስምዎና አድራሻዎ ጋር ተያይዞ በጊዜ ቀፎ ውስጥ በአወስትራሊያ ብሔራዊ መዝገብ ቤት ለ 99 ዓመታት እንዲቀመጥ መጠየቅ ይችላሉ። ቀፎው 99 ዓመታት ሳያሳልፍ በማንም ሰው መታየት ስለማይችል ይህ ውጥን የቆጠራ ጊዜ ቀፎ ይባላል።

የአወስትራሊያ ብሔራዊ መዝገብ ቤት በ 2105 ዓ/ም ማስረጃው ከቀፎው በመውጣት መታየት ሲችል፥ የወደፊቱ ትውልድ የቀደመውን ዘመድ አዝማድ ማስረጃዎች ማግኘት ይችላል።

በጊዜ ቀፎ ውስጥ ማስረጃን ማኖር የግል ምርጫ ነው። የማንም ያልጠየቀ ሰው ማስረጃ ግን የህዝብ ቆጠራው ከተፈፀመና ውጤቱ ከታወቀ በኋላ የአወስትራሊያ እስታቲስቲክስ መሥሪያ ቤት የማስረጃ መያዝ ገደብ ሲደርስ ይጣላል።

## የህዝብ ቆጠራው እንዴት እንደሚከናወን

በቆጠራው ምሽት፥ ማክሰኞ፥ ነሐሴ ፪፥ (August 8 2006)፥ አወስትራሊያ የተገኙ ሁሉ ቱሪስትንም ጨምሮ በየመገኛ ቦታ ይቆጠራል። የቆጠራው ሠራተኛ፥ የቆጠራ ቅፅ (census form)ና የአሞላል መመሪያ፥ ቆጠራው ከመጀመሩ ሁለት ሳምንት በፊት ቤትዎ ድረስ ይዞልዎ ይመጣል። የተሞላውን ቅፅ ደግሞ ቆጠራው ከተከናወነ ሁለት ሳምንት በኋላ ይመጣና ይወስዳል። ለ 2006 ዓ/ም ቆጠራ፥ ቤተሰቦች የቆጠራውን ቅፅ፥ በድር ግንኙነት አማካኝነት መሙላት ይችላሉ።

## እርዳታ ያስፈልግዎታል?

አወስትራሊያ ውስጥ በብዛት በጥቅም በሚውሉ የኮሚዩኒቲ ቋንቋዎች አማካኝነት የህዝብ ቆጠራን የሚመለከቱ ጥያቄዎች ሁሉ፥ ከሐምሌ ወር (July) መጨረሻ ጀምሮ መልስ ማግኘት ይችላሉ። ስለህዝብ ቆጠራ በቋንቋዎ ለመረዳት ከጠዋቱ 8:30 እስከ ምሽቱ 8:00 ባለው ጊዜ **1300 363 365** ይደውሉ።

ለቆጠራ የሚቀጠሩት ሠራተኞች እንደ ቋንቋ ሙያቸው በተገቢው አካባቢ በሥራ ይሠማራሉ። ዕርዳታ መስጠት የሚያስችል ትምህርት ተሰጥቷቸዋል። የህዝብ ቆጠራ ድህረ ገጽ፥ **www.abs.gov.au/census** በቋንቋዎ ትንሽ ማስረጃ ሊይዝ ይችላል።

## ያስታውሱ! "የሕዝብ ቆጠራ፥ የመቆጠር ዕድልዎ ነው።"